# የጽድቅ በር

ሁለተኛ ዕትም



በአለቃ አያሌው ታምሩ

የአዘጋጁው መብት በሕግ የተጠበቀ ነው።

የመጀመሪያ ዕትም ፲፱፻፸፱ ዓ. ም.

ሁለተኛ ዕትም ፳፻ ዓ. ም.

© አለቃ አያሌው ታምሩ

## ማስታወሻ።

ይህንን «የጽድቅ በር» በሚል ርእስ ክቡር አባታችን አለቃ አያሌው ታምሩ በ፲፱፻፸፱ ዓ. ም. አዘጋጅተው አሳትመውት የነበረውን መጽሐፍ አሁን ለሁለተኛ ጊዜ አሳትመን ለምእመናን አገልግሎት ስናቀርብ ከፍተኛ የሆነ መንፈሳዊ ደስታ ይሰማናል።

አምላካችን እግዚአብሔር አገራችንን ኢትዮጵያንና ሕዝቧን በቸርነቱ ይጠብቅልን፤ አሜን።

ባለቤታቸውና ልጆቻቸው።



አለቃ አያሌው ታምሩ።

(፲፱፻፲፫ - ፲፱፻፺፱)

«ተዘከሩ መኳንንቲክሙ ዘነገሩክሙ ቃለ እግዚአብሔር ወእንዘ ትሬእዩ ሠናየ ግዕዞሙ ወሞፃእቶሙ ተመሰሉ በሃይማኖቶሙ።»

«የእግዚአብሔርን ቃል የነገሩአችሁን መምህሮቻችሁን ዐስቡ፤ መልካም ጠባያቸውንና ፍጻሜአቸውን አይታችሁም በሃይማኖት ምሰሉአቸው።» (ዕብ፤ ፲፫ ፥ ፯።)

# የጽድቅ በር

ይህ አነስተኛ መጽሐፍ የጽድቅ በር ተብሎ ተሰይሟል ። ትምህርት የሚሰጠው ስለ ጾምና ስለ ዘርፎቿ ነው።

በበር የሚገባ ሰው ያለ ችግር በረኛ በውቆት፥ መዝጊያ ተከፍቶለት ወደ ቤት ለመግባትና ለማረፍ እንደሚችል ርእሰ ምግባር በሆነችው በጾም በኩልም ወደ ጠቅላላው ትሩፋት መግባት ስለሚቻልና የትሩፋት ሁሉ ሠሪ፥ መሪ በሆነው በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ዘንድ ታውቆ ዕረፍተ ሥጋ፥ ዕረፍተ ነፍስን ማግኘት የሚችል ስለ ሆነ ነው። «ዛ አንቀጽ እንተ እግዚአብሔር ጻድቃን ይበውኡ ውስቴታ።» «ይቺ የእግዚአብሔር በር ናት ጻድቃን ወደ እስዋ ይገባሉ።»

## ክፍል ፩
## ጾምና ዘርፎቿ

በሃይማኖት ለሚፈጸም ትሩፋት ሁሉ ወይም በጎ ምግባር ጥንቱ፥ መሠረቱ ጾም ናት። ግን ብቻዋን አታገለግልም፤ የምታገለግል ከዘርፎቿ ጋር ስትሆን ነው። ሌሎችም ምግባራት ያለሷ አይሠሩም። አይለያዩም ማለት ነው ። ሕዋሳት ብቻ ብቻቸውን ሊሠሩ እንደማይችሉ፥ አንዱ ባንዱ ተደግፈው መኖር እንዳለባቸው፥ ሊንቀሳቀሱም እንደማይችሉ ጾምና ዘርፎቿም የሚደጋገፉ፥ የማይነቃቀፉ ናቸው። እነዚህም ጸሎት፥ አርምሞ፥ አንብዕ፥ ምጽዋት፥ ፍቅር፥ የመሳሰሉትም ናቸው ። ዓይን ይጹም ክፉ ከማየት፤ ምላስ ይጹም ክፉ ከመናገር፤ ጆሮ ይጹም ክፉ ከመስማት፤ የተባለም ስለዚህ ነው ።

ሕዋሳት ሁሉ በየራሳቸው ክፉ ከመሥራት ሲጠበቁ ጾም ፍጹም ይሆናል። ስለዚህ ነው ብቻዋን አታገለግልም የተባለው። ጾምን ፍጹም ለማድረግ፥ በጠቅላላው ሥራ ላይም ሕዋሳትን በሚገባ ለማሰማራት እንዲቻል አእምሮን ከሚጎዱ ነገሮች መጠበቅ ይገባል። ይህም እንደ መጠጥ ካሉ የሱስ ጠባይ ካለባቸው ነገሮች ሁሉ መራቅ ማለት ነው። ሲጾሙ ውሎ መጠጥ መጠጣት ካለ በርበሬን ከመሳሰሉት ምግቦች ጋር ስለሚጋጭ፥ በጾም የደከመ ሰውነትንም ስለሚጎዱ ሥጋዊና ነፍሳዊ ችግር ሊያስከትል ይችላል። ይህ ዓይነቱ ጠባይ ከሰውም ከእግዚአብሔርም ይለያል። ስለዚህ ጾዋሚዎች በጾም ጊዜ ከሁሉ አስቀድሞ መጠጥን ሊታረሙ ይገባል። ሌላ ጊዜም ቢሆን መጠጥ ጥምን ከማርካት ዐልፎ ሰውነትን እስከሚጎዳ መሆን አይገባውም። በጾም ጊዜ ግን የሚከለከለው በጠቅላላ ነው። በሌላ በኩልም እንደ ቡና ያሉ ሱስ የሚያመጡ፥ ሰውነትን ለመቆጣጠር የማያስችሉ ምግቦች በጾም ጊዜ አስፈላጊዎች አይደሉም። የነዚህ ዓይነቶች ስካር ደግሞ የጾም ሰዓታትን ለማሟላት የሚያስቸግሩ ሲሆኑ ዓይንን በመጨፈን፥ አእምሮን በማድከም፥ ሰውነትን በማዛል፥ የራስ ምታት በመፍጠር ሥጋዊና መንፈሳዊ ሥራን ስለሚያስፈቱ ከጥቅማቸው ጉዳታቸው የበለጠ ነውና ከእነዚህም መጾም ይገባል። በዚህ ዓይነት የጾምን ሥርዓት የሚጠብቅ ጿሚ በሃይማኖት፥ በተስፋ፥ በፍቅር ፍጹምነት ከእግዚአብሔርና ከሰው ጋር አንድ ሆኖ የአምላክን በረከት ሊቀበል ይችላል።





# ክፍል ፪ የጾም ሥርዓት

## የጾም አጀማመር

የጾም ሥርዓት ሰው በኃጢአት ከወደቀ ወዲህ በመብል የገባውን ኃጢአት ለማስወጣት ሰውነትንም ወደ ቀድሞ ሕይወቱ ለመመለስ የተጀመረ ውጊያ ነው። ሰው ምንም እንኳን ሞት የሚስማማው ሆኖ ቢፈጠርም የሞት ግዴታ እንዳልነበረበት፤ ሁሉ የሚበላ፥ የሚጠጣ ሆኖ ስለ ተፈጠረም የረኀብ ግዳጅና ስስት አልነበረበትም። ይህ ችግር የመጣ ሔዋን የእባብን ምክር ከሰማችና የበለስን ፍሬ ለመብላት ጉጉት ካደረባት ወዲህ ነው። ስለዚህ በሰው ላይ የድካም እንጀራ መብላት፥ መሞትና መቀበር ተፈረደበት። እሾህና አሜከላ ማለት በሥጋው ረኀብና ጥም፥ ሕመምና ድካም፥ በነፍሱም ልዩ ልዩ ኃጢአትን መመኘት በቀለበት። በዚህ ምክንያት ከዚህ ዓይነቱ በሽታ ለመፈወስ ፍቱን መድኀኒት አስፈለገው። ስለዚህም መድኀኒቱ የሥጋን ምኞት የምታጠፋ፥ የነፍስን ቊስል የምታደርቅ ጾም ሆና ተገኘች። ቅዱሳን ሊቃውንት ጾም የነፍስን ቊስል ታደርቃለች፤ የሥጋን ልዩ ልዩ ምኞት ታጠፋለች፤ ለጎልማሶችም ጸጥታን ርጋታን ታስተምራቸዋለች ብለዋታል። በዚህ ምክንያት በብሉይ ኪዳን የነበሩ አበው በልዩ ልዩ መልክ ተጠቅመውባታል።

በሐዲስ ኪዳን ግን ሠሪዋ፥ መሪዋ እግዚአብሔር ኢየሱስ ክርስቶስ አዲስ መልክ ሰጥቶ ለምእመናን አስተላልፏታል። ጾም ማለት ምን ማለት ነው? ጾም ማለት በሃይማኖቱ ሥርዓት መሠረት ለተወሰነ ጊዜ ከምግብ ያውም ከጥሉላት ማለት ሥጋ፥ ቅቤ፥ ዕንቁላልና ወተት የመሰሉትን ከመብላት ተከልክሎ ለተወሰነ ሰዓት የራብን፥ የጽምን ኃይል በመታገሥ ሰውነቱን መሥዋዕት አድርጎ ለእግዚአብሔር የሚያቀርብባት፥ ከእንስሳዊ

ግብርና ጠባይ የሚለይባት፥ ክቡር ፍጥረት መሆኑ የሚታወቅባት ከፍተኛ ሥርዓት ናት።

ሀ፤ በዕለት ቊጥር አንድ ቀን፥ ሦስት ቀን፥ ሰባት ቀን፥ ዐርባ ቀን ያህል ከጥሉላት ምግብ የሚከለከልባት።

ለ፤ በሰዓት ከቀኑ እስከ ዘጠኝ ሰዓት ለዐሥራ ስምንት ሰዓታት ከምግብ በመከልከል የጌታ የኢየሱስ ክርስቶስን ነገረ መስቀሉን የሚያስብባት፥ ከራብ ከጥም ጋራ የሚዋጋባት፤ ሰይጣንንና ፈቃዱን፥ ሥጋንና ምኞቱን፥ ዓለምንና ፍላጎቱን፥ በጠቅላላውም ኃጢአትንና ፍትወትን የሚዋጋባት የጦር ሜዳ ናት።

ጾም ሁለት ፊደል ሆና ያነሰች ብትመስልም ከፍተኛ ኀይልን የተሞላች ስለ ሆነች እርሷን መማሪያ ያደረገ ሁሉ ሁሉን ያሸነፋል።

ከድሮ ሊቃውንት አንዱ እንዲህ ብሏል፤ ቅኔ፤

ኀዲገ መብልዕ ለዘተክሀሎ

ሓራዊ በጸብዕ ኢይኄይሎ

ወንጉሥ ላዕሌሁ ኢሀሎ

«ምግብ መተው የተቻለውን ሰው ወታደር በጦር ድል አያደርገውም፥ በላዩም ንጉሥ የለበትም፤» ብሏል።

እውነቱን ነው። አንዱን ለሌላው ተሸናፊ የሚያደርገው ምግብ መሻት ነው። ሰው መጀመሪያ በኃጢአት የተያዘበት መብል ስለ ሆነ በመብል ምክንያት ብዙ ሰዎች አደጋ ደርሶባቸዋል። ወፎችም እንኳ በወጥመድ የሚያዙት ምግብ ሲሹ





ነው። ምግብ በመቀነስ፥ ስስትን በማጥፋት ሰዎች መንፈሳዊና ሥጋዊ ጠላታቸውን መቋቋም ይችላሉ። እንኳን በመንፈሳዊ ሕይወት በሥጋዊ ሕይወትም የስፖርት ሰልፊኞች ምግብ በመቀነስ፥ ውሎ በማደር በጾም ሥርዓት ሰውነታቸውን እንደሚያሠለጥኑ ይነገራል። ባለ መድኀኒቶችም ለበሽተኞቻቸው ምግብ ለይቶ በመመደብ ማለት ይህን ብላ፤ ይህን አትብላ በማለት ወይም ለምግብ የተወሰነ ሰዓት በመስጠት የፈውስን ሥርዓት ያስተምራሉ።

ሰውነታቸው የከበደባቸው ሰዎችም ምግብ በመቀነስ የሰውነታቸውን ቅርጽ ሌላውንም ችግር ያስተካክላሉ። እነዚህ ሰዎች ለሥጋ ብለው የሚያደርጉት ይህ ሥርዓት በመንፈስዊ መልኩ ማለት ለአምላክ በመገዛት በሚፈጸምበት ሥርዓት፤ «ዑቁ ኢታክብዱ ልበክሙ በበሊዕ ወበስታይ ወበፈጊዕ።» «በመብላት፥ በመጠጣት፥ በመደሰት ልባችሁን አታደንድኑ፤» (ሉቃ. ም ፳፩፥ ፴፬።) ካለው መሥመር ውስጥ ይገኛሉ። ይህ ከሆነ ጾም የምትፈለገው ለሥጋም ለነፍስም ነው ማለት ነው።

## ክፍል ፫

## በብሉይ ኪዳን የጾም ሥርዓት

ዜና አበውን ስንመለከት የጾም ሥርዓት የተጀመረው አዳም ከገነት ከወጣ በኋላ በነበረበት የንስሐ ጊዜው እንደ ሆነና ልጆቹንም በሰባት ዓመታቸው ጾም አስጀምሯቸው እንደ ነበረ ትምህርት እናገኛለን ። በመጽሐፍ ቅዱስ ግን ጎላ ብሎ የሚታየው ከሙሴ ዘመን ጀምሮ ነው። በዚህ መሠረት በብሉይ ኪዳን ሦስት ዓይነት ያፈጸጸም ሥርዓት ታይቶበታል።

፩ኛ፤ በቀጥታ በእግዚአብሔር ትእዛዝ የተፈጸመው የጾም ሥርዓት ነው። ይህም በዓመት አንድ ቀን ሰው እስከ ማታ ድረስ ሰውነቱን በማስጨነቅ በጽኑ ኀዘን የሚጾመው ጾም ነው። በዕብራውያን አቆጣጠር በሰባተኛ ወራቸው በጥቅምት ዐሥር ቀን የሚፈጸም ሲሆን እንደ ኢትዮጵያ አቆጣጠር መስከረም ዐሥር ቀን ነው። የእግዚአብሔር ቃል እንዲህ ይላል። «እግዚአብሔርም ሙሴን እንዲህ ብሎ ተናገረው፤ በዚህ በሰባተኛው ወር ዐሥረኛው ቀን የማስተሥርያ ቀን ነው፤ የተቀደሰ ጉባኤ ይሁንላችሁ፤ ሰውነታችሁን አስጨንቁት፤ ለእግዚአብሔርም የእሳት ቊርባንን አቅርቡ። በአምላካችሁም በእግዚአብሔር ፊት ማስተሥሪያ ይሆንላችሁ ዘንድ የማስተሥረያ ቀን ነውና በዚያ ቀን ሥራ ሁሉ አትሥሩ። በዚያም ቀን የማይዋረድ ሰው ሁሉ ከሕዝቡ ተለይቶ ይጥፋ፤ በዚያም ቀን ሥራ የሚሠራውን ሰው ሁሉ ከሕዝቡ መካከል አጠፋዋለሁ። ሥራ ሁሉ አታድርጉበት፤ በምትቀመጡበት አገር ሁሉ ለልጅ ልጃችሁ የዘላለም ሥርዓት ነው። የዕረፍት ሰንበት ይሁንላችሁ፤ ሰውነታችሁንም አዋርዱ። በወሩ በዘጠነኛው ቀን በማታ ጊዜ ከማታ ጀምራችሁ እስከ ማታ ደረስ ሰንበታችሁን አድርጉ።» (ኦሪት ዘሌዋ. ም. ፳፫፥ ፳፯ — ፴፪።)

ሥጋዊ ሥራ አይሠራበትም። ኃጢአትን ለማስተሥረይ ከአልጋ ወርዶ፥ አመድ ላይ ተቀምጦ፥ ማቅ ለብሶ፥ ሰውነትን አዋርዶ እጅግ በጣም የሚያዝኑበት፥ የሚጾሙበት፥ የማስተሥረያ መሥዋዕት የሚያቀርቡበት ከፍተኛ ጾም ነው። ቀኑ የሥርየት ቀን ይባላል። በሐዲስ ኪዳን ግን ስቅለት በመባል የሚታወቀው በዕሙነ ሕማማት የሚውለው የጌታችን ዕለተ ስቅለቱ ተተክቶበታል። ዛሬ ክርስቲያኖች በጾም የሚያከብሩት ዕለተ ስቅለትን ነው።





ይህ ጾም ማለት የሥርየት ጾም ከእግዚአብሔር የታዘዘ ሲሆን ሰዎች በልዩ ልዩ ምክንያት የመሠረቷቸው ሌሎች የጾም ይዞታዎች አሉ።

፪ኛ፤ በልዩ ልዩ ምክንያት የተፈጸሙ የጾም ዓይነቶች፤

ሀ፤ በሕዝብ ላይ የተቃጣውን መከራ ለማቃለል የተፈጸመ ጾም።

ኢያሱ ኢያሪኮን እጅ ካደረገ በኋላ ጋይ የተባለችውን ከተማ ለመያዝ በሚሠራበት ጊዜ ከዚያ በፊት ተደርጎ የማያውቅ የመሸሽ ምልክት በእሥራኤል ሰልፈኞች ላይ ታየ። ከሰልፈኞችም ሠላሳ ስድስት ሰዎች ያህል በጠላት ተመቱ። ኢያሱም ስለ ደነገጠ ከደብተራ ኦሪት ፊት እስከ ሠርክ በግንባሩ ወድቆ በጾም ዋለ። ማታ ግን ልዑል እግዚአብሔር በሕዝቡ መካከል በደል እንዳለና መርምሮ አጥፊውን መቅጣት እንደሚገባው ስለ ገለጠለት ከወደቀበት ተነሥቶ በደሉን መርምሮ፥ አጥፊውን ቀጥቶ ሕዝቡን ከእግዚአብሔር አስታርቆአል። (መጽ. ኢያሱ ም. ፯ን በሙሉ ተመልከት።)

ለ፤ በአንድ ዘመን የገባኦን ከተማ ሰዎች በአንድ ካህን ሚስት ላይ በመፈራረቅ በደል ስለ ፈጸሙባትና ስለ ሞተች ካህኑ የደረሰበትን በደል ለመግለጥ አካሏን ቆራርጦ ለ፲፪ ነገደ እሥራኤል ልኮ ፍረዱኝ አለ። መላው እሥራኤል ተሰብስበው ጉዳዩን ለመመርመር አጥፊዎችን ቢጠሩአቸው አንቀርብም አሉ። እንዲያውም መላው ነገደ ብንያም ከነሱ ጋር ተባብረው ለጦርነት ተሰለፉ። ከመላው እስራኤል በኩል ፬፻ ሺሕ (አራት

መቶ ሺ) ሠልፈኞች ሲገኙ በነገደ ብንያም ወገን ደግሞ ፳፮ ሺሕ ፯፻ (ሃያ ስድስት ሺ ሰባት መቶ) ሰልፈኞች ተገኝተው ነበር። ሁለት ቀን በተደረገው ጦርነት ነገደ ብንያም አይለው ሁለቱንም ቀን ድል አደረጉ። በሦስተኛው ቀን ሕዝቡ ሁሉ ጾም ዐውጀው እስከ ማታ በጾም በጸሎት ውለው የእግዚአብሔርን ቃል ስለ ጠየቁና ኀይል የእግዚአብሔር መሆኑን እንዲያውቁ የተፈጸመ መሆኑ ስለ ተገለጠላቸው በሦስተኛው ቀን ድል የመላው ሕዝብ ሆኖ አጥፊዎች ቅጣታቸውን ተቀብለዋል። (መጽሐፈ መሳፍንት ም. ፲፱ ና ፳።)

ሐ፤ በፋርሳዊው በአርጤክስስ መንግሥት ግዛት ሥር የነበሩ እሥራኤላውያን ሁሉ በአንድ ቀን ማለት በዕብራውያን አዳር ተብሎ በሚጠራው በመጋቢት ፲፩ ቀን እንዲጠፉ ዐዋጅ ከተላለፈ በኋላ አስቴርና ቤተሰቦቿ ሱሳ በሚባለው ከተማ የነበሩ እሥራኤል ጭምር በፈጸሙት የሦስት ቀን ጾም እሥራኤል ድነው ጠላቶቻቸው እንዲጠፉ ሆኗል። መጽሐፈ አስቴርን በሙሉ ማንበብ ይጠቅማል፤ በተለይ ምዕራፍ ፬።

መ፤ የግል ጾም ነው። ዳዊት ኦርዮን በማስገደሉ በደል ስላደረገ ነቢዩ ናታን ከገሠጸው በኋላ በንስሓ ከእግዚአብሔር ሲታረቅ በሕግ መተላለፍ ከኬጢያዊው ከኦርዮ ሚስት የወለደው ልጅ ስለ ታመመ ዳዊት ይድንልኝ እንደሁ ብሎ ሰባት ቀን ጾሟል። ነገር ግን ዳዊት በጥፋቱ ስለ ተቀጣ ልጁ አልዳነም፤ ሞቷል። በልጁ ያገኘው የነበረው ደስታም በዚሁ ምክንያት ቀርቶአል። ግን በንስሓ፥ በጾም ስለ ታረቀበት በሞተው ፈንታ ስሎሞንን አግኝቷል። (መጽ. ሳሙ. ካልዕ ም. ፲፪።)





ሠ፤ በብሉይ ኪዳን ዘመን የነበሩ ሰዎች አንድ ሰው ተፈርዶበት የሞት ቅጣት የሚፈጸምበት ከሆነ ያገሪቱ ሕዝብ አስቀድመው ጾም ዐውጀው ይጾሙ ነበር። ይህም እግዚአብሔር ደሙን እንዳይመራመራቸው፥ ከበደሉ ንጹሓን እንዲያደርጋቸው የይቅርታ መጠየቂያ ጾም ነው። ይህ ዓይነቱ ጾም አንዳንድ ጊዜ ሕዝቡን የሚያወናብዱ አንዳንድ ሰዎች የተንኮል ሥራ ስለሚጨምሩበት አሳዛኝ ሁኔታ የታየበት ጊዜ አለ። ለምሳሌ በሰማርያ አገር የእሥራኤል ንጉሥ አክአብ ናቡቴ የተባለውን ሰው የወይን ቦታህን ሽጥልኝ ወይም በለውጥ ስጠኝ ብሎ ቢጠይቀው ናቡቴ አልሰጥም አለ። አክአብም ከቤቱ ገብቶ አኩርፎ እህል አልበላም አለ። ሚስቱ ኤልዛቤልም ሐሳቡን ለማሟላት ወደ ኢይዝራኤል አገር ሽማግሌዎች ጾም ዐውጃችሁ በናቡቴ ላይ የሐሰት ምስክር አስመስክራችሁ ናቡቴን ግደሉ ብላ ስለ ጻፈች የአገሩ ሽማግሌዎች ናቡቴን እንደ ገደሉት እናያለን። (፩ ነገ. ም. ፳፩።)

ነገር ግን እግዚአብሔር ፍርዱን ስላለስቀረው ውሾች የናቡቴን ደም በላሱበት ቦታ የአክዓብን ደም ልሰውበታል። ናቡቴ ተገድሎ በወደቀበት ቦታም የአክዓብ ልጅ ንጉሡ ኢዮራም ተወግቶ ወድቆበታል።

፫ኛ፤ ተአምራዊ ጾም፤

እስከ አሁን ያየነው ስለ ኃጢአት ሥርየት በእግዚአብሔር ትእዛዝ የተፈጸመውን ከባድ ችግርን ለማቃለል፥ የግል ችግርን ለማቃለል፥ በሰዎች ላይ ስለሚፈጸም ፍርድ የተደረገውን የጾም ሥርዓት ነው። ይህ ዓይነቱ ጾም ሰዎች ዐስበው በምግብ

በመከልከል፥ ሰውነታቸውን በመጉዳት፥ ሥጋን መሥዋዕ አድርጎ በማቅረብ ኃጢአትን ለማስተስረይ፥ ከመከራ ከመቅሠፍት ለመዳን፥ ይቅርታ ለማግኘት፥ በፍርድ ከሚመጣ ፍዳ ነጻ ለመሆን የሚፈጸም ጾም ነው። ይህ ወደፊት የምንናገርለት ተአምራታዊ ጾም ግን እግዚአብሔር ለቅዱሳን ሰዎች በልግስና የሚያደርገው ቸርነቱ የተገለጠበት፥ ሰዎች ያለ ምግብ መኖር የማይችሉ ሲሆን በእግዚአብሔር ኃይል ግን ያለ ምግብ መኖር እንደሚችሉ የተረጋገጠበት ነው ።

ሀ፤ ነቢዩ ሙሴ፤ ነቢዩ ሙሴ አንድ ጊዜ ሕግ ለመቀበል፥ ሁለት ጊዜ እሥራኤልን በበደላቸው ምክንያት ከእግዚአብሔር ለማስታረቅ ዐርባ ዐርባ ቀንና ዐርባ ዐርባ ሌሊት ከምግብ በመለየት መቶ ሃያ ቀንና መቶ ሃያ ሌሊት ያለ ምግብ ኖሯል። (ዘዳግም ም. ፱ ቍ. ፱ እና ፲፰። ም. ፲ ቍ. ፲።) ይህንንም ቅዱስ እስጢፋኖስና ቅዱስ ጳውሎስ ሥርዓተ መላእክት ብለው ገልጠውታል። (የሐ. ሥራ ም. ፯ ቍ. ፶፫። ገላ. ፫፥ ፲፱።)

ለ፤ ነቢዩ ኤልያስ፤ ነቢዩ ኤልያስ ከኤልዛቤል ተጣልቶ ወደ ኮሬብ በሸሸ ጊዜ በመንገድ ደክሞት ከክትክታ ዛፍ ጥላ ሥር ዐረፈ። ወዲያው ዕንቅልፍ ዕንቅልፍ አለው ተኛ፤ የእግዚአብሔር መልአክ መጥቶ ቀሰቀሰው፤ ሲነቃም ከራስጌው መብል መጠጥ አገኘ፤ በልቶ ጠጥቶ ተኛ፤ አሁንም መልአኩ ቀስቅቦ ተነሥ ብላ ጠጣ የምትኼድበት መንገድ ሩቅ ነው አለው። ተነሥቶ በላ ጠጣ። በዚያ የምግብ ኃይልም ዐርባ መዓልት ዐርባ ሌሊት እስከ እግዚአብሔር ተራራ ድረስ ኼደ። (፩ ነገ. ም. ፲፱ ቁ ፯ - ፲ ።)





በብሉይ ኪዳን በልዩ ልዩ ሥርዓት የተፈጸመ የጾም ሥርዓት አለ። ከዚህ የጠቀስናቸው በጥቂቱ ነው። ወደፊትም የምንጠቅሳቸው ይኖራሉ።

አፈጻጸማቸው ግን ሥጋን ብቻ የሚመለከቱ ናቸው። ወደ ፊት የምንገልጸው የሐዲስ ኪዳን ጾም ግን ከዚህ ለየት ያለ ነው። አሁን ወደርሱ እንገባለን።

## ክፍል ፬
## ጾም በሐዲስ ኪዳን

ጾም በሐዲስ ኪዳን ቀደም ሲል ከጠቀስነው ሁሉ የተለየ ነው። አዋጁም አፈጻጸሙም የተለየ ነው። ባለፈው የጠቀስነው የጾም ሥርዓት ሁሉ ዕለታዊ ሁኔታን፥ ሥጋዊ ችግርን የሚመለከት ነው። በሐዲስ ኪዳን ግን እንዲህ አይደለም። በሐዲስ ኪዳን የሚፈጸመው የጾም ሥርዓት ስለ ጽድቅ ነው፤ ለእግዚአብሔር ተብሎ ነው ማለት ነው። መሥራቹ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከዚህ ዓለም ምንም ነገር የማይሻ ስለ ሆነ እሱ የሰውን ልጆች ለማዳን በመጣበት ሥርዓት የሰውን ደካማ ባሕርይ ከኃይል ወደ ኃይል ለማሸጋገር በጠላቱ በሰይጣንና በመሣሪያው በመብል ላይ ኃይሉን እንዲያጎናጽፍ ለማድረግ ሥራውን በጾም ጀመረ። ጌታ በ፴ ዘመን ዕድሜው ከተጠመቀ በኋላ ወደ ገዳም ሄዶ ከቆመ ሳያርፍ፥ ከዘረጋ ሳያጥፍ፥ እህል ውሃ ሳይቀምስ ዐርባ መዓልት ዐርባ ሌሊት ጾመ። እንደ ሙሴ በተአምራት እንደ ኤልያስም አንድ ጊዜ የበላው ስንቅ ሆኖት አይደለም። ሙሴና ኤልያስ ይህን ዕድል ያገኙት ከእግዚአብሔር ጋራ በመኖር በተሰጣቸው ጸጋ ነው። ሐዋርያትም ሥርዓተ

መላእክት ያሉት ይህንን ነው። በእግዚአብሔር ዓለም የሚኖሩ ሁሉ የሥጋ ፍላጎት የለባቸውም። ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ አንድ ቀን ስለ ሙታን ትንሣኤ ሲናገር ሙታን ከተነሡ በኋላ ዓለማዊ ፍላጎት የሌለባቸው መሆኑን ገልጾ እንደ መላእክት ሆነው እንደሚኖሩ ተናግሯል። እንግዲህ ሙሴና ኤልያስ ከእግዚአብሔር ጋር በነበሩበት በዚያ ወቅት እንዲህ ነበሩ ማለት ነው። ጌታችን ግን የመጣው ወደ ሰው ነው። የኖረውም የሰውን ኑሮ ነው። ወደ ገዳም የሄደውም የሰውን ፈተና ለመፈተን ነው። በዚያ ዐርባ ቀንና ዐርባ ሌሊት በገዳም ሳለ ከአራዊት ጋር ኖረ፤ ከሰይጣን ተፈተነ ፤ ተራበ፤ ተጠማ። ነገር ግን በመራብ አልሳሳም፤ በፈተናውም ድል አልተነሣም በዚህም ኃይል በመብል ምክንያት ወደ ሰው ባሕርይ ገብቶ የነበረውን የኃጢአት ድካም ከሰው ሁሉ አራቀ። አንዲት የዕፀ በለስ ፍሬን በልቶ ድል ተነሥቶ የነበረ የሰው ባሕርይ ዛሬ ግን በመብል በመጠጥ መሻት ምክንያት ድል የማይነሣ (የማይሆን) በጾም በጸሎት ከምግብ በመየለት ጠላቱን ሰይጣንን፥ የጠላቱን ፈቃድ ኃጢአትን፥ በነሱ ምክንያት የሚመጣበትንም ድካም ድል ለመንሣት ኃይል አገኘ። ይህ የጌታችን ጽድቅ (ቸርነቱ) ሰውን ሁሉ ለጽድቅ አብቅትቶታል። ጻድቅ አድርጎታል። ይህን በሥራ ለሰው የሰጠውን ኃይልም በቃል ሲያጸና ፈታኙ መጥቶ፤ «የእግዚአብሔር ልጅ ከሆንክ እነዚህ ድንጋዮች ዳቦ እንዲሆኑ እዘዝ፤» ቢለው፤ «ሰው የሚድን በእንጀራ ብቻ አይደለም፤ ከእግዚአብሔር አፍ በሚወጣ ቃል ሁሉ እንጂ፤» ብሎ ሰው እንደ እንስሳ በምግብ ብቻ በመመርኮዝ ሕይወት አገኛለሁ ብሎ እንዳይታመን፥ ከምግብ ተለይቶ በመጾምም እግዚአብሔር የሚሰጠውን ሕይወት ለመቀበል እንደሚቢቃ እንዲያምን ትምህርት ሰጥቷል።





እንግዲህ ጌታ ለእኛ ቤዛ አርአያ ሊሆን ጹሞ በጾም በኩልም የሕይወትን ኃይል ከሰጠን በኋላ ከጾሙ ሲመለስ፤ «ኑ ተከተሉኝ፤» ብሎ ምእመናንን ጠራ።

ሰው ምግብ በመብላት አይፈረድበትም፤ ግን ራሱን የምግብ ባሪያ አድርጎ ዕድሜውን ካሳለፈ ይፈረድበታል።

የሰው የሕይወቱ ተስፋ ምግብ ብቻ አይደለም። ስለዚህ ከፍሎ እየጾመ፥ ከፍሎ እየመጸወተ ጌታ የሰጠውን የሕይወት ኃይል በጾም ተቀብሎ ያለ ምግብ የሚኖርበትን የዘላለም ሕይወት ሊጠባበቅ ይገባዋል።

ጌታ፤ «ኑ ተከተሉኝ፤» በማለት ብቻ አልተወሰነም። ጥሪውን ሰምተው ለተከተሉት ብዙ ምእመናን አንቀጸ ብፁዓን ተብሎ የሚጠራውን የአዋጅ ትምህርት ሲሰጥ በዘጠኙ የብፅዕና አንቀጾች መካከል፤ «ስለ ጽድቅ የሚራቡ፥ የሚጠሙ ብፁዓን ናቸው፤» በማለት በሐዲስ ኪዳን የሚፈጸመውን የጾም ሁኔታ ገልጧል።

በሐዲስ ኪዳን የሚፈጸም ጾም ዓይነቱ መልኩ ይህ ነው። ስለ ሥጋዊ ጠባይ፥ ስለ ሥጋዊ ፍላጎት አይጾምም፤ የሚጾም ስለ ጽድቅ ተብሎ ነው። ጽድቅ ማለትም ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ስለ ሰው ልጆች የፈጸመውን ቸርነቱን፥ ቢዛነቱን፥ ሕማሙን፥ ሞቱን፥ በጠቅላላውም ከዕለተ ፅንስ እስከ ዕለተ ዕርገት ለሰው ልጅ የፈጸመውን መዘከር ነው። ይህን ሁሉ ላደረገልን አምላክ ሙሉ ውለታ ወረታ መክፈል ባንችልም ለምግብ ግዙ ከመሆን ርቀን፥ የመጠጥ ምርኮኛ ከመሆን ተለይተን በጾም በጸሎት

ብናገለግለው፤ «ስለ ጽድቅ የሚራቡ የሚጠሙ ብፁዓን ናቸው፤» ባለው ቃሉ መሠረት ታላቅ ብፅዕናን ያስገኝልናል። (ማቴ. ፭÷ ቁ ፮፤ ፪ ና ፲፰፤ ም. ፭ ና ፯።)

ጌታ ኢየሱስ ክርስቶስ በጲላጦስ ፊት ለፍርድ በቆመባት በዚያች ሰዓት፤ «እኔ ስለዚህ ወደ ዓለም መጣሁ፤ ስለዚህም ተወለድኩ። እውነት ልመሰክር፤ ከእውነት የሆነ ሁሉ ቃሌን ይሰማል፤» አለ። (ዮሐ. ም. ፲፰ ቁ. ፴፯።) ጲላጦስም ሆነ ሌሎች ይህን ቃል መስማት ሐሳቡን መረዳት አልተቻላቸውም። ጌታ ጽድቅ (እውነት) ብሎ የጠራው በሱ ፈቃድ÷ በአባቱ ፈቃድ÷ በመንፈስ ቅዱስ ፈቃድ ሰውን ለማዳን እስከ መስቀል ሞት የደረሰበት÷ ሰውን የወደደበት ፍቅሩ ነው። እንግዲህ በሐዲስ ኪዳን ያለ እውነት ይህ ነው።

«ከእውነት የሆነ ሁሉ ቃሌን ይሰማል፤» ማለቱም በእሱ ያመነ ሁሉ ሕማሙን÷ ሞቱን÷ በቤዛነቱ የተፈጸመለትን ፍቅሩን ሳይረሳ÷ ሳይዘነጋ ይኖራል ማለት ነው።

ኀሙስ ማታም ከደቀ መዛሙርቱ ጋር ለራት ተቀምጦ በነበረበት ሰዓት ሥጋውን ደሙን ከሰጣቸው በኋላ መታሰብያዬን እንዲህ አድርጉ ብሏቸዋል። ቅዱስ ጳውሎስ ይህንን ቃል ወስዶ ለቆሮንቶስ ሰዎች በጻፈው የመጀመሪያ መልእክቱ በምዕራፍ ፲፩ ከቁጥር ፳፪ - ፳፱ ምስጢረ ቁርባንን በገለጸበት ትምህርት ምእመናን የክርስቶስን ሥጋውን ደሙን በሚቀበሉበት ጊዜ ሁሉ የክርስቶስን ሞቱን÷ ትንሣኤውን ማሰብ እንዳለባቸው አስተምሯል። ጌታችን በዚህ ብቻ ሳይወሰን ከትንሣኤው በኋላ ለደቀ መዛሙርት ባስተማራቸው በመጽሐፈ ኪዳን፤ «ዛቲ ይእቲ





ስብሐት ፍቅር እምእግዚአብሔር ኢታሴስል።» «ከእግዚአብሔር የማትለይ ፍቅር ይህች ናት፤» ማለት ተዘክሮተ መስቀል የጌታን ነገረ መስቀል ሁል ጊዜ ማሰብ ናት ብሏል።

በዚህ መሠረት ስለ ጽድቅ የሚራቡ÷ የሚጠሙ የሚለው ቃል የሚያመለክተን ነገረ መስቀልን ስለ ማሰብ የተሠራውን የጌታን ቤዛነቱን÷ ቸርነቱን÷ ሕማሙን÷ ሞቱን በማሰብ ላይ የተመሠረተውን ጾም ነው።

<u>የሐዲስ ኪዳን ጾም፤</u> የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ቤተ ክርስቲያን የምትቀበለው ጾም በመሠረቱ በሁለት መደብ ይከፈላል።

፩ኛው በሳምንት ሁለት ቀን የሚፈጸመውን ጾመ ድኅነት እየተባለ የሚጠራውን የረቡዕንና የዓርብን÷ ዐቢይ ጾምን÷ ሰሙነ ሕማማትን÷ የሚያጠቃልል ነው። ይህ ጾም ከላይ እንደ ገለጽኩት በጌታችን ሥራ ላይ የተመሠረተ ጾም ነው።

ሀ፤ <u>ዐቢይ ጾም</u> ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ስለኛ የጾመው÷ በፍጻሜ ጾሙም በመብል የሚፈታተነንን ሰይጣን ድል ነሥቶ ለክርስቲያን ጾም ኃይል የሰጠበት፤ «ኑ ተከተሉኝ፤» በማለትም ለእኛ ለክርስቲያኖች ያስተላለፈው ነው። ዐቢይነቱ ወይም ዐቢይ መባሉ ከእሱ የተቀበልነው÷ ከእሱ በሥራ በቃል የተማርነው ከመሆኑም በላይ ድኅነታችን የተመሠረተበት ከዓመት ቀኖች ለእርሱ የምናወጣው ዐሥራት ስለ ሆነ ነው።

ለ፤ ሰሙነ ሕማማት ሠላሳ ሦስት ዓመት ከሦስት ወር በዚህ ዓለም ኖሮ ከዚህ ውስጥ ሦስት ዓመት ከሦስት ወር ወንጌልን አስተምሮ እምላክነቱን፥ ቸርነ መድኃኒትነቱን በትምህርት በተአምራት ከገለጠ በኋላ ለሰው ልጆች ያሰበውን ቤዛነቱን በመስቀል ላይ በመሞት የፈጸመበት፥ በከርሠ መቃብር ሦስት መዓልት ሦስት ሌሊት አድሮ ሙስና መቃብርን ያጠፋበት፥ ሞትን ድል ነሥቶ ተነሥቶ ትንሣኤን የዘለዓለም ሕይወትን ለእኛ ያጎናጸፈበት ሳምንት ነው። ይህም ከሆሣዕና ዋዜማ ቅዳሜ እስከ መሐትወ ፋሲካ (የትንሣኤ ዋዜማ) ቅዳሜ ድረስ ያለው ቀን ነው። አይሁድ ከሌላው ጊዜ ይበልጥ የጌታን ሞቱን ለማፋጠን በየቀኑ ለምክር የተሰበሰቡበት፥ ሐሳባቸውንም ከግብ ያደረሱበት ሳምንት ስለ ሆነ የሕማማት ሳምንት ይባላል።

ሐ፤ ጾመ ድኅነት (የረቡዕና የዓርብ ጾም) የዚህ ጾምም መሠረቱ የሕማማት ሳምንት ነው። አይሁድ ስብሰባቸውን በጀመሩበት በአራተኛው ቀን ሊቀ ካህናቱ ቀያፋ ብዙ ሕዝብ ከሚቸገር አንድ ሰው ብንገድል ይሻላል ሲል ባቀረበው ሐሳብ ጉባኤው ስለ ተስማማ ረቡዕ ዕለት የጌታ ሞት በጉባኤው በአንድ ድምፅ ተወስኗል። ይህም ኀሙስ ማታ ተጀምሮ ዓርብ ስለ ተፈጸመ የረቡዕና የዓርብ ጾም መሠረቱ ይህ ነው። ጌታችን ወንጌልን ሲያስተምር በነበረበት ጊዜ ጠያቂዎች መጥተው፤ «የዮሐንስና የፈሪሳውያን ደቀ መዛሙርት ይጾማሉ፤ ደቀ መዛሙርትህ ግን አይጾሙም ስለ ምን ነው?» ቢሉት፤ «የመሸራ ሚዜዎች መሸራው ከነሱ ጋር ሳለ ሊጾሙ አይችሉም፤ ነገር ግን ሙሽራው ከነሱ የሚወሰድበት ቀን ይመጣል፤ ያን ጊዜ ይጾማሉ፤» ብሎ ነበር። ይህ ዕለተ ሞቱን በማመልከት የተናገረው ቃል በሥራ ሲፈጸም ደቀ መዛሙርት ሐዋርያት የጌታን ዕለተ ሞቱን ዕለተ





ስቅለቱን መሠረት አድርገው የሐዲስ ኪዳንን ጾም ጀመረዋል። ቤተ ክርስቲያንም የተረከበችው ከነሱ ነው። ይህንንም ዲድስቅልያ በተባለው የሥርዓት መጽሐፋቸው በአንቀጽ ፳፱ እና ፴ ጽፈው ለቤተ ክርስቲያን አስተላልፈውታል።

ከዐቢይ ጾም በፊት የሚገኘው «ዘወረደ» ተብሎ የሚጠራው ጾም በጾሙ ውስጥ ላሉት የጾም ሥርዓት ለማይፈጽምባቸው፥ ከጥሉላት በቀር ሌላ ምግብ ለሚበላባቸው፥ ጾም ለማይዋልባቸው ለሁለት ሰንበታት ለቅዳሜና ለእሑድ ለውጥ ነው። የረቡዕና የዓርብ ጾም ደግሞ በየሳምንቱ ክርስቲያኖች የጌታን ሕማሙን ሞቱን የሚያስቡበት ጾም ነው።

እንደሚታወቀው በአሁኑ ጊዜ በጌታ ተመሥርቶ ከሐዋርያቱ ተላልፎ ለእኛ የደረሰውን ዐቢይ ጾሙን በመፈጸም ላይ እንገኛለን። በዚህም በያዝነው ዓመት የካቲት ፲፯ ቀን ፲፱፻፹፱ ዓ. ም. ተጀምሮ ሚያዝያ ፲፩ ቀን ፲፱፻፹፱ ዓ. ም. ይፈጸማል። እንግዲህ ጾሙ ስለ ጽድቅ የምንራብበት የምንጠማበት መሆኑን ልናውቅ ይገባል። ስለ ሥጋዊ ፍላጎት የምናደርገው አይደለም። ቀደም ሲል እንደ ጠቀስናቸው እንደ ብሉይ ኪዳን አጽዋም አይደለም። ስለዚህ ክርስቲያኖች ሁሉ ከአምላካቸው ጋራ ያላቸውን አንድነት እያሰቡ፥ እያሰላሰሉ ሊጾሙት ይገባል።

፪ኛው ክፍለ ጾም፤ ጾመ ነቢያትን፥ ጾመ ሐዋርያትን፥ ጾመ ፍልሰታን፥ ገሃድንና ጾመ ነነዌን የሚያጠቃልለው ክፍል ነው።

የዚህ ክፍለ ጾም ሥርዓት ውሳኔው በሐዋርያት ተከታዮች ሊቃውንት እንደ ሆነ ይነገራል። ይህም በፍትሐ ነገሥት በ፲፭ኛው አንቀጽ ጾም ተረጋግጧል።

ሀ፤ <u>ጾመ ስብከት</u>፦ መሠረቱ የነቢያት ጾም ማለት የክርስቶስን መምጣት የሚጠባበቁ አበው ለምሳሌ እንደነ ዳንኤል ያሉ ቅዱሳን ነቢያት በየጊዜው የፈጸሙት መሆኑ ሲታወቅ፤ በመጨረሻም ትንቢተ ነቢያት በብሥራተ መልአክ የተፈጸመላት እመቤታችን ቅድስት ድንግል ማርያም እንደ ጾመችውና ሐዋርያትም ከእሷ እንደ ተቀበሉት ይነገራል። መነሻው መንፈቀ ኅዳር ማለት የኅዳር እኩሌታ፥ መፈቻው የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ ልደት ታኅሣሥ ፳፱ ቀን ነው።

ለ፤ <u>ጾመ ሐዋርያት</u>፦ ይህ ጾም ሐዋርያት መንፈስ ቅዱስን ተቀብለው የወንጌልን መልእክት ለማዳረስ ወደ ዓለም ከመውጣታቸው አስቀድሞ የአንድነት ሥራቸውን በኢየሩሳሌም ለመጀመር ጌታ ሥራቸውን ያቃናላቸው ዘንድ እሱን አብነት በማድረግ የጾሙት ጾም ነው። መነሻው ከዕለተ ጰራቅሊጦስ ማግሥት ሆኖ መድረሻው የቅዱሳን ሐዋርያት (ጴጥሮስ፥ ጳውሎስ) የዕረፍታቸው መታሰቢያ የሆነው ሐምሌ ፭ ቀን ነው።

ሐ፤ <u>ጾመ ፍልሰታ</u>፦ ይህ ጾም ቅዱሳን ሐዋርያት የጾሙት ነው። የጾሙበት ምክንያትም ጌታ ኢየሱስ ክርስቶስ የእናቱን የእመቤታችንን የቅድስት ድንግል ማርያምን ትንሣኤና ዕርገት እንዲያሳያቸው የጾሙት፥ ብርቱ ልመናና ምልጃ ያደረጉበት ሲሆን አሳባቸው ተፈጽሞላቸው ትንሣኤዋንና ዕርገቷን አይተው ይህንኑ ለዓለም እንዲሰብኩ የታዘዙበት ቀዋሚ የቃል ኪዳን





ተስፋ ያገኙበት ስለ ሆነ ከእነሱ ለቤተ ክርስቲያን ተላልፏል። መነሻው ነሐሴ ፩ ቀን ሲሆን መፈቻው ነሐሴ ፲፮ ቀን የእመቤታችን የትንሣኤና የዕርገቷ መታሰቢያ በዓል ነው።

የሰውን ድኅነት የሚሻው ጌታችን አምላካችን መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስ መታሰቢያቸውን ያደረገ ስማቸውን የጠራ ሁሉ የዘለዓለም ሕይወት እንዲያገኝ፦ ፩ኛ፤ ለእመቤታችን ፪ኛ፤ ለቅዱሳን ሐዋርያቱ ቃል ኪዳን የሰጠበት ቀን ስለ ሆነ እመቤታችን «ኪዳነ ምሕረት» እየተባለች ትጠራበታለች። ይህ ቃል ኪዳን እመቤታችን በሕይወተ ሥጋ ሳለች በጎልጎታ ስትጸልይ ፩ኛ፤ በየካቲት ፲፮ ፪ኛ፤ በሰኔ ፳፩ቀን ከልጅዋ ከወዳጅዋ፥ ከፈጣሪዋ ለተቀበለችው ቃል ኪዳን ፍጻሜ ነው።

መ፤ <u>ጾመ ገሃድ(ጋድ)፤</u> የቃሉ ትርጉም «ገሃድ» ሲል መገለጥ «ጋድ» ሲል ለውጥ ማለት ነው። ቅዱሳን ሐዋርያት የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ የልደቱና የጥምቀቱ በዓል በሳምንት ሁለት ቀን በምንጾምባቸው፥ ጾም በተሠራባቸው በረቡዕና በዓርብ የዋለ እንደ ሆነ የጾሙ ሥርዓት ሳይጠበቅ ፩ኛ፤ ታኅሣሥ ፳፰ ቀን ለ፳፱ አጥቢያ ፪ኛ፤ ጥር ፲ ቀን ለ፲፩ አጥቢያ በመንፈቀ ሌሊት ቅዳሴ እንዲፈጸምና ምእመናን በትንሣኤው ያከባበር ሥርዓት ዓይነት በዓሉን በደስታ እንዲያከብሩ አዝዘዋል። ስለዚህ የሁለቱም ማለት የልደት፥ የጥምቀት ዋዜማ በጾም እንዲታሰብ ሆኗል። በአንድ በኩል የጌታን መገለጥ የምናስብበት ነው።

መገለጥ ሲባልም እንደ በዓላቱ ጠባይ ሁለት ነው። በልደት መገለጥ ሲባል ሰው ሆኖ የማያውቅ አምላክ በሥጋ ሰው ሆኖ በአጭር ቁመት በጠባብ ደረት ተወስኖ ስለ ተገለጠና ሰዎች ሊያዩት ሊዳስሱት ስለ ቻሉበት ነው።

በጥምቀት መገለጥ መባሉ ሰው የሆነው አምላክ በዓለም ሲኖር እስከ ፴ ዓመት ዕድሜው ድረስ ሰዎችን ለማዳን የመጣ መሲሕ ሰው የሆነው አምላክ አማኑኤል ኢየሱስ ክርስቶስ እሱ መሆኑን ሳያውቁ ከኖሩ በኋላ በ፴ ዓመት ዕድሜው በዮርዳኖስ ወንዝ በዮሐንስ እጅ ሲጠመቅ አብ፤ «የምወደው ልጄ ይህ ነው እሱን ስሙት፤» ብሎ በሰጠው ምስክርነት፣ መንፈስ ቅዱስ በርግብ አምሳል ወርዶ በራሱ ላይ ሲያርፍ በመታየቱ ነቢያት የተነበዩለት የሰው ልጆች መድኃኒት ሥጋው አምላክ ማለት ሰው የሆነ አምላክ እሱ መሆኑ ስለ ተገለጠበት ነው።

ጸመ ገሃድ ወይም ጋድ ቅዳሜ፡ እሑድ ቢሆን በሰንበት ጾም ስለ ሌለ ሥርዓተ ጾሙ ከጥሉላት ምግብ በመከልከል ብቻ ይፈጸማል።

<u>ሠ፤ ጾመ ነነዌ፦</u> ይህ ጾም መሠረቱ ቀደም ሲል ከክርስቶስ ልደት በፊት የሆነ ነው። ስለዚህ ጾም ወደፊት በመጠኑ እንገልጻለን። ግን ጾሙ በብሉይ ኪዳን የተጾመ ሲሆን ለሐዲስ ኪዳን ክርስቲያኖች መተላለፉ የንስሓ ጾም እንደ መሆኑ መጠን ንስሓ የሚገቡ ሁሉ ተስፋ ሳይቆርጡ በጾም በጸሎት ከተገለገሉ እግዚአብሔር እንደሚቀበላቸው እንዲማሩበት ነው።

እንግዲህ የጾምን ሥርዓት በሁለት መደብ አሳይተናል ። ይሁን እንጂ አሁንም ቢሆን የክርስቲያን ጾም አፈጻጸሙና ትርጉሙ የክርስቶስን ፍቅር በማሰብ መሆኑን በጥብቅ ልናሳስብ እንወዳለን።





# ክፍል ፫
# ጾምና ኃይሎቿ

ቀደም ሲል በክፍል ፩ ጾም ዘርፎች ያሏት መሆኑን ገልጠናል። እነዚህም ክርስቲያኖች በጾማቸው ጊዜ አስተባብረው የሚፈጽሟቸው አርእስተ ምግባር ናቸው። አንዳንዶቹን በአጭር በአጭሩ ከዚህ ቀጥሎ እንመለከታቸዋለን።

ሀ፤ <u>ጥንቃቄና ምጽዋት</u>፦ ሰዎች በሚጾሙበት ጊዜ በሥጋዊ ፍላጎታቸው ሊጠቀሙ አይገባም። በቂም በቀል ሰውን መጉዳት፣ በሥልጣን ምክንያት ሰውን መጫን፣ ያበደሩበት ገንዘብ ቢኖር ማስቸገር፣ ማስጨነቅ፣ ክብርን፣ ኀይልን፣ ሥልጣንን፣ ጉልበትን፣ ሀብትን ምክንያት አድርጎ የማይገባ ሥራ መሥራት ክልክል ነው። ይህን እያደረጉ መጾም ዋጋ የለውም። በዚህ ፋንታ ለሰው ርኅራኄ ማድረግ፣ በፍጹም ልቡና እግዚአብሔርን ለመቀበል መዘጋጀት ያስፈልጋል። ለዚህም በኢሳይያስ ምዕራፍ ፶፰ ከቁጥር ፫ - ፲ የተጻፈውን መመልከት ይጠቅማል። ከቁጥር ፮ - ፱ ያለውን ከዚህ ቀጥሎ አስፍረነዋል። «እኔስ የመረጥሁት ጾም ይህ አይደለምን? የበደልን እስራት ትፈቱ ዘንድ፣ የቀንበርንስ ጠፍር ትለቅቁ ዘንድ፣ የተገፉትንስ አርነት ትሰዱ ዘንድ፣ ቀንበሩን ሁሉ ትሰብሩ ዘንድ አይደለምን? እንጀራንስ ለተራበ ትቆርሱ ዘንድ፣ ስደተኞቹን ድኾች የተራቆተውንስ ብታይ ታለብሰው ዘንድ ከሥጋ ዘመድህ እንዳትሸሸግ አይደለምን? የዚያን ጊዜ ብርሃንህ እንደ ንጋት ይበራል፤ ፈውስህም ፈጥኖ ይበቅላል፤ ጽድቅህም ፈጥኖ የበቅላል፤ ጽድቅህም በፊት ይሄዳል የእግዚአብሔርም ክብር በኋላህ ሆኖ

ይጠብቅሃል፤ የዚያን ጊዜ ትጠራለህ፤ እግዚአብሔርም ይሰማሃል፤ ትጮሃለህ፤ እርሱም እነሆኝ ይልሃል።»

እንግዲህ ጾም ከርኅራኄ ጋር ሲሆን ይበልጥ የሚጠቅም መሆኑን ከዚህ በላይ ተመልክተናል።

ለ፤ ትሕትናና ንስሓ በኅብረት፦ ጾም ከንስሓ፥ ከትሕትና ጋራ በኅብረት ይፈጸማል። ፍሬውም በቶሎ ይገኛል። ይህንንም በነነዌ ሰዎች ጾም መረዳት ይቻላል። ታላቂቱ ከተማ ነነዌ በእሳት እንድትጠፋ ከአምላክ ስለ ተፈረደባት ነቢዩ ዮናስ ይህንኑ እንዲያስተምር ወደሷ ተላከ። እሱም ወደ ከተማዪቱ ለመድረስ የአንድ ቀን መንገድ ሲቀረው ጀምሮ በኃጢአቷ ምክንያት ታላቂቱ ከተማ ነነዌ በእሳት ልትገለባበጥ የተፈረደባት መሆኑን ሳይፈራ ሳያፍር አስተማረ።

ሕዝቡና ንጉሡም፥ መሳፍንቱም፥ መኳንንቱም የነቢዩን ቃል ሰምተው ኃያል እግዚአብሔር የማያደርገውን የማይናገር፥ የተናገረውን የማያስቀር መሆኑንና በኃጢአቱም ተጠጥቶ ለሚያዝን፥ ለሚያለቅስ፥ ለሚጾም፥ ለሚጸልይ፥ ወደ ፍጹም ንስሓ ለሚመለስ ደግሞ ይቅር ባይ መሆኑን አምነው ከዐልጋ ወርደው አመድ ላይ ተኝተው፥ ምንጣፍ ለብሰው ጾሙ፤ ጸለዩ፤ አዘኑ፤ አለቀሱ። ጾማቸውም በዕድሜ ከፍተኞች የሆኑትን ሰዎች፥ ወይም ሰዎችን ብቻ የሚመለከት አልነበረም። የሚጠቡ ሕፃናትንም፥ እንስሳትንም የሚጨምር ነበር እንጂ። ሕፃናት ጡት እንዳይጠቡ፥ ላሞች ከጥጆቻቸው እንዳይገናኙ፥ ሰዎች ሁሉ ከእህል ከውሃ፥ እንስሳትም ከሣር ተከልክለው ሦስት ቀን እንዲጾሙ ታወጀ። እግዚአብሔርም ንስሓቸውን ተቀበለ፤ ከመዓትም ወደ ምሕረት ተመለሰ። ይቅርታውንም አደረገላቸው።





እንዲያውም ነቢዩ ዮናስ በአንዳንድ ምክንያቶች እጅግ ስላዘነ ማለት መዓቱ በመመለሱ ሕዝቡ የነቢዩ ትምህርት ውሸት ይመስላቸዋል፥ ኃያል አምላክም እንደ ሌለ ይመስላቸዋል ብሎ ስላሰበ ነገሩን በምሳሌ ገልጦ ቀኛቸውን ግራቸውን የማይለዩ በብዙ ሺሕ የሚቆጠሩ ሕፃናት ላሉባት ለከተማይቱ ይቅርታ እንዳደረገ አስረድቶታል። ትንቢተ ዮናስ ም ፫ ና ፬ን አንብቡ።

## ክፍል ፮
## እርምሞ

እርምሞ በጾም ጊዜ ከሚያስፈልጉት ምግባራት አንዱቱ እንዲያውም ከፍተኛዪቱ ናት። እርምሞ ማለት ዝምታ፥ ብዙ ከመናገር ይበልጡንም ክፉ ከመናገር መከልከል ነው።

ቅዱስ ያዕቆብ ሐዋርያ የሆነ ያልሆነውን በመቀባጠር ወይም ሰውን እያሳዘነ፥ በአንደበቱ ሰዎችን እያቆሰለ የሚጾምና በዚህም እግዚአብሔርን ያገለገለ የሚመስለው ጾዋሚ ቢኖር እንዲህ ያለው ጾም የማይጠቅም መሆኑን ያስረዳል። በየቀኑ በጾም እግዚአብሔርን የሚያገለግል ሰው ቢኖር አንደበቱን የማይቆጣጠርና የማይገታ ቢሆን እንዲህ ያለው ሰው ጾሙ ከንቱ ነው ይላል። (ያዕ. ፩፥ ፳፮ ና ፳፯ ።)

ምላስን መግዛት እጅግ ከባድ መሆኑንም ሐዋርያው ያዕቆብ ያስረዳል። እንዲያውም ሳይማሩ፥ ሳይፈቀድላቸው በየፊናው እየተነሡ እናስተምራለን የሚሉ ሁሉ ጽኑ ፍርድ እንደሚጠብቃቸው ገልጾ ሁሉ ላስተምር እንዳይል ምክር ይሰጣል። ለዚህም ምክንያት የሚያደርገው ምላስ የምታመጣውን

መዘዝ ነው። የሚገሰግስ ፈረስ በትንሽ ልጓም፥ መርከብም በትንሽ መልሕቅ እንደሚገታና የፈረስና የመርከብ የአካላቸውን ታላቅነት፥ የኃይላቸውን ብዛት በትንሽ ልጓም፥ በትንሽ መልሕቅ መቆጣጠር እንደሚቻል ገልጦ ሰው አንደበቱን በመግዛት ከልዩ ልዩ ኃጢአት ሕዋሳቱን መጠበቅ እንደሚችል ያስረዳል። ሐዋርያው ያዕቆብ ምላስን በእሳት ይመስላታል። ትንሽ እሳት ታላቁን ወይም ብዙውን ዛፍ ልታቃጥል እንደምትችል ምላስም ለዓመፀኛው ዓለም እሳት ናት። «ትንሽ ምላስ በሰውነታችን ውስጥ ተፈጥራለች፤ ይህችው አፍአዊ ሰውነታችንን ታቃጥለዋለች፤ ውሳጣዊ ሕዋሳችንንም ትጠብሰዋለች። ወፉም አሞራውም ሌላውም ፍጥረት ሁሉ ለሰው ይገዛል ይታዘዛል፤ የሰውን ምላስ ግን መግዛት የሚቻለው የለም። በሷ እግዚአብሔር አብን እናመሰግናለን፤ በሷም በአርአያ እግዚአብሔር የተፈጠረ ሰውን እንሰድባለን፤ እንረግማለን፤ እናማለን፤ እናዋርዳለን። ወንድሞቻችን! ከአንድ ምንጭ፥ ከአንድ ጉዳጓድ ሁለት ዓይነት ውሃ መራራና ጣፋጭ ሊወጣ ይቻላልን? አይቻልም ። እንዲሁ ከአንድ አፍ ቡራኬና መርገም ሊወጣ አይችልም፤» ይላል። ስለዚህም ክርስቲያኖች በማንኛውም ጊዜ ይልቁንም በጾም ጊዜ አንደበተ ቁጥብ፥ አንደበተ ክት ሊሆኑ ይገባል። ያለዚያ ግን እግዚአብሔርን አገልግለናል፥ ዋጋ እናገኝበታለን የሚሉት ጾማቸው ከንቱ ይሆናል። (ያዕ. ፫፥ ፩ - ፲፪።)

ነቢዩ ዳዊትም በሠላሳ ስምንተኛውና በመቶ ዐርባኛው መዝሙር ለአንደበት መዝጊያ ማድረግ እንደሚገባ ያስተምራል። (መዝ. ፴፰፥ ፩። ፻፵፥ ፫።)





ጌታችንም እውነት የሆነውን እውነት፣ ሐሰት የሆነውን ሐሰት ከማለት ዐልፈን እውነትን በሐሰት እንዳንለውጥ ሁለት ምላስ እንዳይኖረን ያስጠነቅቃል። ስለዚህ በጾም ጊዜ ዝምታ ውበት አለው። (ማቴ. ፭፥ ፴፯።)

## ክፍል ፯
## ጾም በኅብረት

የግል ካልሆነ በስተቀር ሕጋዊ ጾም የሁሉም ነው። ክርስቲያኖች ሁሉ ቤተ ክርስቲያን የተቀበለችውን ጾም፣ ይልቁንም ጌታ ራሱ የጾመውን፥ ሕማመ ሞቱ የሚታሰብበትን ዐቢይ ጾምን፣ ረቡዕንና ዓርብን መጾም የግድ ነው። ታናሽ ታላቅ፣ ልጅ ዐዋቂ አይመረጥበትም። ከታመመና ፯ ዓመት ካልሞላው ሕፃን በቀር አባታችን አዳም ስለ ድኅነቱ በተገለጠለትና በተሰጠው ሀብተ ትንቢት መሠረት ረቡዕንና ዓርብን የጾም የጸሎት ቀን፣ እሑድን የሰንበት ቀን አድርጎ ጾም፣ ጸሎት፥ መሥዋዕት ያቀርብ እንደ ነበረና ለልጆቹ ለአቤልና ለሴትም ከ፯ ዓመታቸው ጀምሮ ይህንኑ አስተምሯቸው እንደ ነበረ ዜና አዳም የተባለው መጽሐፍ ያስረዳል። ይህም ሥርዓት ከአባቶች ወደ ልጆች በቤተ ሰብ መምህርነት ተላልፎ የኖረ ኢትዮጵያውያን ክርስቲያን ቤተ ሰቦች ለልጆቻቸው በ፯ ዓመታቸው ጾምን ያስይዙ ነበር። ይህም የሩቅ ታሪክ ሳይሆን እስከ ዘመናችን ተጠብቆ ኖሯል። በአገር ቤት ርዝራዡ አሁንም አለ። ጾም የኅብረት ነው። በትንቢተ ኢዩኤል ምዕራፍ ፪ ቁጥር ፲፪ - ፲፫ በጥንቃቄ ተጽፎ ይገኛል። ከቃሉ በጥቂቱ እንዲህ ይላል።

«አሁንም በጾም በጸሎት ወደ እኔ ተመለሱ፤ ልብሳችሁን ሳይሆን ልባችሁን ቅደዱ በጽዮን መለከት ንፉ፤ ነጋሪት ምቱ፤ ጾም ለዩ፤ ምሕላ (ጸሎተ ማኅበር) አውጁ፤ ማኅበሩን ቀድሱ፤ ሽማግሌዎችን፥ ጡት የሚጠቡ ሕፃናትንም ሰብስቡ፤ ሙሽራ ከጫጉላው ይውጣ፤ ሙሽራይቱም ከመጋረጃዋ ትውጣ፤ ካህናቱም በመሠዊያው ዙሪያ ሆነው አቤቱ ሕዝብህን ይቅር በል፤» እያሉ ያልቅሱ ብሏል።

ይህም ጾም የሁሉ መሆኑን ነው የሚያሳየን። አንዳንድ ሰዎች ሙሽራና ሚዜዎቹ ጾም የለባቸውም እያሉ ጾምን ይሽራሉ። ለዚህም፤ «የሙሽራውን ሚዜዎች ሙሽራው እነርሱ ጋራ ሳለ ልታስጾሙ ትችላላችሁን፤» ብሎአል ጌታ እያሉ ምክንያት ይፈጥራሉ። ጌታ የሰዎችን ልማድ ተናገረ እንጂ ይገባል አላለም። ስለዚህ ይህ ምክንያት ሊሆን አይችልም። ያውም ቢሆን ጌታ ይህን ቃል የተናገረው የክርስቲያን ጾም መሠረት ስለ ሆነው ስለ ዕለተ ስቅለቱ ጥንትነት እንጂ ስለ ሌላ አይደለምና ማንኛውም ሰው ስለ ጌታ ቃል ሲናገር ታላቅ ጥንቃቄ ማድረግ አለበት።

አንዳንዶቹም በምትጾሙበት ጊዜ ራሳችሁን ተቀቡ፤ ፊታችሁን ታጠቡ፤ እንደ ጾማችሁ ማንም አይወቅ፤ እናንተስ ስትጾሙ በሥውር ያያችሁ አባታችሁ በሥውር ዋጋችሁን ይከፍላችኋላል ብሎአልና ጾም በኅቡዕ ነው ይላሉ። (ማቴ. ፮፥ ፲፯።) ይህ ቃል የጾምን ሕጋዊነት አይለውጠውም።

ጾም ሁለት ዓይነት ነው፤ አንዱ ሕጋዊ፥ አንዱ የግል። ሕጋዊውን፤ «ስለ ጽድቅ የሚራቡ የሚጠሙ ብፁዓን ናቸው።





የሙሽራ ሚዜዎች ሙሽራው ከነርሱ የሚወሰድበት ቀን ሲመጣ ያን ጊዜ ይጾማሉ፡፡» ባለው መሠረት ያለ ኀፍረት በግልጥ በአዋጅ መጾም ይገባል። ሰው ስለ ራሱ ኃጢአት፥ ስለ አገርና ስለ ሕዝብ ሕይወት፥ ስለ ትሩፋት የሚጾመውን የግል ጾም በኅቡዕ መያዝ ይገባዋል። ይህም ጾም በሌለበት፥ ያገኘውን ሁሉ ሊበላ በሚችልበት ጊዜ የሚያደርገው ነው።

አፈጻጸሙ በማቴ. ፮፥ ፲፮ እንደ ተጻፈው ሰው ይይልኝ፥ ይስማልኝ ሳይል፥ ጾመኛ ሳይመስል የሚፈጸም ነው። ስለዚህ የሕጉንና የግሉን ጾም ለይቶ መጠቀም ይገባል።

በጾም ጊዜ በሕግ የተከለከሉ ነገሮች አሉ። አንዳንድ ሰዎች ይልቁንም በዘመናችን ከተነሡት መሐከል ጾም መኖሩን የሚቃወሙና ቢኖርም በራሳቸው ፈቃድ ለመወሰን ሥልጣን እንዳላቸው የሚያስተምሩ ሰዎች አሉ። ስለዚህም በጾም ጥሉላት ማለት ሥጋ፥ ቅቤ፥ ወተት መብላትን ወይም ሌላ ሌላ ምኞት መፈጸምን የሚከለክል ነገር የለም፥ የተወሰነ ጊዜም የለውም ይላሉ።

ስሕተት ነው፤ የጾም ሥርዓቱ፥ መሠረቱ ኃጢአተኛ ሰውነትን በእግዚአብሔር ፊት አዋርዶ ከልዑል እግዚአብሔር ፍጹም ጸጋ ለመቀበል በንጹሕ ልብ መቅረብ ነውና ሥጋን ከምኞቱ መለየት የመጀመሪያው ነው። ስለዚህም ከዐልጋ ወርዶ በመሬት ላይ ተኝቶ ከሥጋ፥ ከቅቤ፥ ከወተት፥ ከመጠጥ፥ ከዕንቁላል፥ ከአይብ እነርሱንም ከመሰለ ነገሮች ሁሉ ተለይቶ መፈጸም ይገባል። በትንቢተ ዳንኤል ም. ፱፥ ቁ ፫፤ ም. ፲፥ ቁ ፪ እና ፫ መመልከት ይጠቅማል። በሕግ መጽሐፍም በአንቀጸ

ጾም ከእንስሳ ወገን የሆነ ወይም ከእንስሳት የሚገኝ ነገር በጾም ጊዜ እንዳይበላ በግልጥ ተደንግጓል። (ፍትሐ ነገሥት አንቀጽ ፲፰።) አንዳንድ ሰዎች በሕግ መጽሐፍ ዘእንበለ ዓሣ የሚለውን ቃል ሳይጠነቀቁ ዓሣ ሳይቀር፥ ዓሣም ቢሆን አትብሉ ያለውን ተላልፈው በጾም ጊዜ የዓሣን ምግብ ከመብላታቸውም በላይ ክርስቶስ ኀሙስ ማታ ዓሣ አብልቷል እያሉ አሳሳች ታሪክ ይተርካሉ። ክርስቶስ በጾም ዓሣ አላበላም፤ ኀሙስ ማታም የዓሣ ምግብ አልነበረም። የፋሲካ ሥርዓት ከዚህ ልዩ ነበረና። ዐምስት እንጀራና ሁለት ዓሣ ባርኮ ለሕዝብ የሰጠበትም ጥር ፴፫ ቀን እንደ ሆነ የታሪክ መጽሐፍ ያስረዳል። ዓሣ በሥነ ፍጥረትም ከእንስሳት ውስጥ እንደ ሆነ፥ በሥነ መባልዕትም ከእንስሳት የሚቆጠር እንደ ሆነ መጽሐፉ ያስረዳልና በጾም ጊዜ ዓሣ መብላት አይገባም። (ዘፍ. ፩፥ ቁ ፳። ዘሌ. ፲፩፥ ቁ ፱ ተመልከት።)

ስለ ጊዜው ቢሆን የሙሽራው ሚዜዎች ሙሽራ ከነርሱ የሚወሰድበት ቀን ይመጣል ያለው የጌታ ቃል መሠረቱን አመልክቷልና በጌታ ሕማሙና በሞቱ ለተመሠረተው ለክርስቲያን ጾም ሌላ ወሳኝ የለውም፤ ወሳኙ ራሱ ነው። ስለዚህም አባቶቻችን ሐዋርያት በሥርዓት መጽሐፋቸው፤ «ጌታ የጾመው ጾመ ዐርባ በእናንተ ዘንድ ክቡር ይሁን፤ መከራ መስቀልንም የተቀበለበትን ሳምንት ዐስቡ፤ ምክረ ሞቱ የጸናበትን፥ ሞቱ የተፈጸመበትን ረቡዕንና ዐርብን ጹሙ።» (ዲድስቅሊያ አንቀጽ ፳፱ እና ፴።) እንዳሉ መጾም ይገባል።

እዚህ ላይ ስለ አክፍሎት እናስታውስ። አክፍሎት እላይ እንደ ጠቀስነው እንደ ጌታ ትእዛዝ በዕለተ ስቅለት የተፈጸመ የጾም መጀመሪያ ነው። ጌታችን አምላካችን መድኃኒታችን





ኢየሱስ ክርስቶስ ኀሙስ ማታ ለደቀ መዛሙርቱ የፋሲካን ማእድ ከአደረገና ሥጋውን ደሙን ከሠራላቸው በኋላ ወደ ጌቴሴማኒ ለጸሎት ሄደ፤ በዚያው ተይዞ እስከ መስቀል ሞት ደረሰ።

ዓርብ በ፱ ሰዓት በመስቀል ላይ ሞቶ በዮሴፍ፥ በኒቆዲሞስ እጅ በ፲፩ ሰዓት ወደ መቃብር ወርዶ፥ በመቃብርም ሙስና መቃብርን አጥፍቶ፥ ሞትን ድል ከነሣ በኋላ እሑድ ማታ ደቀ መዛሙርት ቤታቸውን ዘግተው በተሰበሰቡበት በዝግ ደጅ ገብቶ በመካከላቸው ተገኝቶ ራሱን ከገለጠላቸውና ጎኑን፥ እጁን፥ እግሩን ካሳያቸው በኋላ በፊታቸው ጥቂት የተጠበሰ ዓሣንና የማር ወለላን በልቷል። እንግዲህ እስከ እሑድ ምንም አልበላም ማለት ነው። ቤተ ክርስቲያን በየዓመቱ በትንሣኤ ዋዜማ ዓርብና ቅዳሜ የምታስበው የአክፍሎት መሠረት ጾም ይህ ነው ። ዐርብ በየሳምንቱ ሲጾም ቅዳሜ ግን ከዚህ ጊዜ በቀር በሌላ ሰዓት ጾም አይደረግባትም። በዚህ የአክፍሎት ጾም ሙሉ ጤና ያላቸው ሰዎች ሁለቱን ቀን፥ የማይችሉ ግን ቅዳሜን ብቻ ሊጾሙ ይገባል። ከዚህም በቀር በጾም ጊዜ ንጽሕናን መጠበቅ ሥርዓት ነው። ባልና ሚስት እንኳ ቢሆኑ ጾምን ማክበር ይገባቸዋል። ነገር ግን የሰው ባሕርይ ደካማ ስለ ሆነ ሰይጣን እንዳይዋጋቸው ተለያይተው ሊያድሩ አይገባም። (፩ ቆሮ. ም. ፯፥ ፭።) ነቢያትም ሐዋርያትም በጾም ተጠቅመዋል፤ አገልግለዋል፤ ብዙ ጸጋም አግኝተውበታል። የነቢያትን ብዙ አሳይተናል። የሐዋርያትም በየመጽሐፉ አለ። ለአሁኑ ግን የሐዋርያት ሥራ ምዕራፍ ፲፫ ቁ. ፩ - ፬፤ ፪ኛ ቆሮ. ም፲፩፥ ቁ ፳፯ ተመልከቱ እንላለን። አንዳንድ ሰዎች ጿሚዎችን ይነቅፋሉ፤ ይተቻሉ፤ በጾም ያፌዛሉ። አያስደንቅም፤ የተጻፈ

ነውና። መዝ. ፳፰፥ ቁ ፲፤ ፻፳፥ ቁ. ፳፬ መመልከት ነው። ይሁን እንጂ በሰዎች ጠባይና በሥጋዊ ፍላጎት፥ ዓለምና ሰይጣን የሚያመጡትን መከራ በመፍራት ከዓላማ ማፈግፈግ አይገባም ። ጌታ ከእናንተ በፊት የነበሩ ነቢያትንም እንዲሁ አድርገውባቸው ነበር ብሎ የእነርሱን ሁኔታ ካመለከተ በኋላ በእነርሱ የደረሰ ሁሉ ቢደርስብን ሁሉን መታገሥና መቀበል እንደሚገባን አዝዞናል። (ማቴ. ፭፥ ቁ ፲፩ - ፲፪።) ይልቁንም፤ «በትዕግሥታችሁ ነፍሳችሁን ገንዘብ ታደርጋላችሁ፤» ሲል የሰጠውን ምክርና፤ «ጽኑ፥ በርቱ፤ እኔ ዓለምን ድል ነሥቼዋለሁና፤» በማለት የሰጠውን ትእዛዝ መጠበቅ ይገባናል። (ሉቃ. ፳፩፥ ፲፱። ዮሐ. ፲፮፥ ፴፪።)

ወንድሞቻችን የኢትዮጵያ ክርስቲያኖች! አገራችን፥ ቤተ ክርስቲያናችን ከእግዚአብሔር ጋር የነበረች፥ ያለች፤ ከዓለም አገሮችም በይበልጥ ጸጋውን በልዩ ልዩ መንገድ የተሳተፈች፥ ራሷ ምስክር ለመሆን የምትችል፥ ሌላ ሊመሰክርላት የማትሻ ሃይማኖታዊ ናትና ሃይማኖታችሁን ጠብቁ፤ ምግባራችሁን አጽኑ። በጾም፥ በጸሎት፥ በፍቅር ወደ እግዚአብሔር ቅረቡ። ጾማችሁን እንደ ሕጉ ፈጽማችሁ ለእናንተም ለአገራችሁም የእግዚአብሔርን በረከት ለመቀበል ተዘጋጁ። የእግዚአብሔርን ቃሉን ነግረናችኋል፤ እምቢ ብትሉ ግን ከደማችሁ ንጹሕ ነን። እግዚአብሔር በቤተ ክርስቲያን አይፈርድም። እግዚአብሔር አምላካችን ሁላችንንም አንድ አድርጎ በቸርነቱ ያስበን፤ አሜን።

<u>ከአለቃ አያሌው ታምሩ።</u>




አለቃ አያሌው ታምሩ።
(፲፱፻፲፭ - ፲፱፻፺፱።)

## አለቃ አያሌው ታምሩ ጽፈዋቸው የታተሙ መጻሕፍት።

፩፤ የመኰንን ጉቦ። (፲፱፻፴፰ ዓ. ም.)
፪፤ የአንበሳ ዱካ። (፲፱፻፵፫ ዓ. ም.)
፫፤ መች ተለመደና ከተነኮላ ዝምድና። (፲፱፻፵፫ ዓ. ም.)
፬፤ የኢትዮጵያ እምነት በሦስቱ ሕግጋት። (፲፱፻፵፫ ዓ. ም.)
፭፤ የኑሮ መሠረት ለሕፃናት። (የመጀመሪያ ዕትም ፲፱፻፵፫ ዓ. ም.፤ ሁለተኛ ዕትም ፳፻ ዓ. ም.)
፮፤ ወላዲተ አምላክ በኢትዮጵያ። (የመጀመሪያ ዕትም ፲፱፻፷፱ ዓ. ም.፤ ሁለተኛ ዕትም ፳፻፪ ዓ. ም.)
፯፤ የጽድቅ በር። (የመጀመሪያ ዕትም ፲፱፻፷፱ ዓ. ም.፤ ሁለተኛ ዕትም ፳፻፪ ዓ. ም.)
፰፤ ምልጃ፣ ዕርቅና ሰላም። (፲፱፻፺፪ ዓ. ም.)
፱፤ ተአምርና መጽሐፍ ቅዱስ። (፲፱፻፺፫ ዓ. ም.)
፲፤ መልእክተ መንፈስ ቅዱስ። (፲፱፻፺፭ ዓ. ም.)
፲፩፤ ዜና ሕይወት ዘቅድስተ ቅዱሳን እመ አምላክ። (፲፱፻፺፱ ዓ.ም.)

ዋጋው፣ ብር 8.00